المملكة العربية السعودية
وزارة الشؤون الإسلامية والدعوة والإرشاد
وكالة المطبوعات والبحث العلمي

# የሐጅ ሥራዎች

አዘጋጅ

ዶ. ሐቢብ ቢን መዐሳ አልሉወይሒቅ



አማርኛ

# ኪንግደም ሳውድ ዐረቢያ
# በእስልምና ጉዳዮች፣ ገንዘብ ስጦታ፣ ዳእዋና መምሪያ ሚንስቴር
# የህትመትና ሳይንሳዊ ምርምር ድርጅት

# የሐጅ ሥራዎች

አዘጋጅ

ዶ. ሐቢብ ቢን መዐሳ አልሉወይሒቅ

أعمال الحج باللغة الأمهرية

**የመጀመሪያው ቀን ሥራ**
**እሱም ስምንተኛው ቀን ነው፡፡**

1- በሐጅ ይሐርም«በሐጅ ሥራ መግባቱን ያስባል» (ይህም በመካ ከተማና አቅራቢያው ለሚኖር ሰው ነው ) በአለበት ቦታ ሰውነቱን ታጥቦ፣ ሽቱ ተቀብቶና የኢሕራም ልብሱን ለብሶ እንዲህ ይበል ፤ ለበይክ ሐጅን፣ ለበይክ አላሁመ ለበይክ፣ ለበይክ ላሽሪከ ለከ ለበይክ፣ ኢነልሐምደ ወኒዕመተ ለከ ወልሙል ላሽሪከ ለክ፡፡ [1] ( ወደ መካ ከተማ

---

[1] እነዚህ ቃላት በዚህ መልካቸው በዐረበኛ መባል አለባቸው፡፡ ነገር ግን ትርጉማች እንዲህ ሊሆን ይችለል

በዚህ በስምንተኛው ቀን እንጂ ያልመጣሰው ደግሞ የሐጅ ሥራ መሐረሚያ ቦታወችን አቋርጦ የሚመጣ ከሆነ ያን የመሐረሚያ ቦታ ሳይሐርም ሊያልፍ አይገባም)::

2- ወደ ሚና ያመራና የዘጠነኛው ቀን ፀሓይ አስክትወጣ እዚያው ሚና ውስጥ ይቆይ::

እንዲሁም እዚያው ሚና ውስጥ የሰምንተኛውን ቀን ዙህር፣ ዐስር፣ መግሪብ፣ ዒሻእና የዘጠነኛውን ቀን ፈጅር ሶላቶች ይሰገድ:: እያንዳንዱን

---

ምንግዜም ታዛዥህ ነኝ ለሐጅም ተነሳሁ:: ጌታዬ ሆይ ትእዛዝህን ከመፈጸም አልቦዝንም ምንግዜም ታዛዥህ ነኝ ለስልጣንህ ተጋሪ ከቶ የለበህም ምንግዜም ታዛዥህ ነኝ ምስጋና ተድላም ያነተው ነው ገዢነትም እንዲሁ «የፍጥረታት ሁሉ ገዢ አነተ ነህ» ለስልጣንህ ተጋሪ ከቶ የለበህም::

ሶላት በተወሰነለት ጊዜ የሚሰግድ ሲሆን በአላራት ረከዓዎችን ያሳጥር «ሁለት ሁለት እያደረገ ይሰገድ»

**የሁለተኛው ቀን ሥራ**

**እሱም ዘጠነኛው ቀን ነው፡፡**

1- ፀሓይ ከወጣች በኋላ ወደ ዐረፋ ያምራ፡፡ ዙህርና ዐስርን አሳጥሮ በተቀዳሚው በዙህር ጊዜ በቅደም ተከተል አንድላይ ይስገድ፡፡ ከቀትር በፊት (የደረሰ ከሆነ) ቢሳካለት ነሚራ ውስጥ ይረፍ፡፡

2- ከሶላት በኋላ ፊቱን ወደ ቂብላ አዙሮና አጆቹን ዘርግቶ ሌላውን ሁሉ ነገር በመተው ዚክር«አላህን ማውሳት»ና ዱዓውን ያለማቋረጥ ፀሓይ አስክትወጣ ድረስ በትጋት ይፈጽም፡፡

3- ጀንበር ከተለቀች በኋላ ወደ ሙዝደሊፋ ያምራ:: አዚያም መግሪቡን አንዳለ ሦስት ዒሻእን ደግሞ «በማሳጠር» ሁለት ረከዓ አድርጎ ይስገድ:: እዚያው ሙዝደሊፋ ውስጥ ጎህ እከሚቀድ ድረስ ይቆይ::
4- ጎህ ከቀደደ በኋላ የፈጅር ሶላትን ይሰግድና በደምብ እስሚተያይ ደረስ ትጋቱን ለዚክር«አላህን ለማውሳት»ና ለዱዓእ«ጸሎት»ብቻ ያድርግ::
5- ፀሓይ ከመውጣቷ በፊት ወደ ሚና ያምራ::

የሦስተኛው ቀን ሥራ
እሱም የዒድ ቀን ነው::
1- ወደ ሚና እንደደረሰ ወደ ጀምረተል ዐቀባ ሄዶ በተከታታይ ሰባት ጠጠሮችን ይወረውር ፤ አንዷን ወርውሮ ሌላው በማስከትል::

እያንዳንዷን ጠጠር ሲወርውርም ተክቢራ ያድርግ «አላሁ አክበር ይበል»

2- ሀድይ«ምጽዋዕት» ያለው ከሆነ ሀድዩን«ምጽዋዕቱን» ይረድ
3- ራሱን ይላጭ ወይም ያሳጥር ፤ በዚህም የመጀሪያውን መፈታት ይፈታል «ማለትም ተራ» ልብሱን መልበስና ሽቱም መቀባት ይችላል፡፡ ከሴት ጋር ከመገናኘት ሌላ ያሉት የተከለከሉ ነገሮች ሁሉ ይፈቀዱለታል፡፡
4- ወደ መካ ይወርድና የኢፋዷን ጠ-ዋፍ ያደርጋል፡፡ እሱም የሐጅ ጡዋፍ ነው፡፡ ከዚያም የሐጅ የሆነን ከሶፋና መርዋ መካከል ሰዕይን «እሩጫን» ያከናውን፡፡ ይህ አንግዲህ

ሙተመቲዕ[2] የሆነ እንደሆነ ወይም ሙተመቲዕ ባይሆንም የቁዱም «መግቢያ» ጡዋፍ ባደረገበት ወቅት ሰዕይን«ሩጫን» አልፈጸመ እንደሆነ ነው::

በዚህም ሁለተኛውን መፈታት ይፈታል«ማለትም»ሴት ጋር መገናኘትም ሳይቀር «ሐጀ በመሐረሙ» የተከለከሉ ነገሮች ሁሉ ይፈቀዱለታል::

5- ወደ ሚና ይመለስና ዐሥራ አንደኛውን ሌለት በዚያው ያሳልፍ::

የአራተኛው ቀን ሥራ

እሱም ዐሥራ አንደኛው ቀን ነው::

---

[2] ሙተመቲዕ ማለት ከሀገሩ ሲነሳ ዑምራን«አስቦ»ከመሐረሚያ ቦታ«ሚቃት» ዘንድ በዑምራ ሐርሞ የዑምራን ሥራ ጨርሶ፣ ጊዜው ሲደርስ እንደገና መካ ውስጥ ሐጅን የሚሐርም ሰው ነው::

1- የመጀመሪያዋ፣ መካከለኛዋና የዐቀባ ጀምራ የተባሉትን የጠጠር ውርወራዎች ያከናውን፡፡ በያንዳንዷ ጀምራ«የመወርወሪያ ቦታ» በተከታታይ ሰባት ጠጠሮች መወርወር ይኖርበታል፣ ጠጠሯን በወረወረ ቁጥርም ተክቢራ ያድርግ«አላሁ አክበር ይበል» «ይህ ሥራ የሚከናወነው» ከቀትር በኋላ ነው ከቀትር በፊት ሊሆን ከቶ አይችልም፡፡ ከመጀመሪያዋና ከመካከለኛዋ ጀምራዎች «ውርወራዎች» በኋላ ለዚክር«አላህን ለማውሳት»ና ዱዓእ ጥቂት መቆም አንዳለበት መገንዘብ ይኖርበታል፡፡

2- ዐሥራ ሁለተኛውን ሌሊት ሚና ይደር«ያሳልፍ»

የአምስተኛው ቀን ሥራ

እሱም ዐሥራ ሁለተኛው ቀን ነው፡፡

1- ሦስትንም ጀምራዎች በአራተኛው ቀን በወረወረበት መልኩ ይወርውራቸው::
2- የሚቻኮል ከሆነ ጀንበር ከመጥለቋ በፊት ሚናን ለቆ ይውጣ፣ የሚቆይ ከሆነ እዚያው ሚና ይደር::

የስድስተኛው ቀን ሥራ
እሱም ዐሥራ ሦስተኛው ቀን::
ይህ ቀን የሚቆይን ሰው ብቻ የሚመለከት ሲሆን በዚህ ቀን ፤
1- ሦስቱንም ጀምራዎች በአለፉት ሁለት ቀናት በአደረገው መለኩ ይወረውራል::
2- ከዚያ በኋላ ሚናን ለቆ ይውጣ::
በመጨረሻ የሚያከናውነው ሥራ ለጉዞ በሚዘጋጅበት ወቅት ጡዋፈል

ወዳዕን «የስንበት ጡዋፍ» ማድረግ ነው:: እውቀት ሁሉ የአላህ ነው::

ኪንግደም ሳውድ ዐረቢያ

በእስልምና ጉዳዮች፣ ገንዘብ ስጦታ፣ ዳእዋና መምሪያ ሚንስቴር
የህትመትና ሳይንሳዊ ምርም ድርጅት

**መ.ሣ.ቁ.** 61843 **ኮድ** 11478
**ቴሌ.** 00966114736999
**ፋክስ** 00966114737999
**ሪያድ** info@islam.org.sa